## ዋጋዋ ስንት ነው?

ምነው እመ-ብርሃን፥ ዝም አልሽኝ፥ ስቀር፡ ያለምስክር

አንችን አስረስታኝ፥ ዋጋ ቢስ ስታደርገኝ፥ ከነበረኝ ክብር

ምነው ጨቀንሽብኝ፤ ጥርስሽን ነከስሽብኝ

የቀን አዞሪት ይዞኝ፥ በራኳት መጠን፥ ከስሯ ስገኝ

አምላኬ ሳረጋት - የልቤ ታቦት

እንዴትስ...

አምላኬን መተው ልቤን ተቻላት?

ቀጥራኝ፤ ናፍቃኝ፥ እስካገኛት ልቤ ሳሳ

እሷ ግን...

　　　　አገኘኋት....

　　　　　　የክ'ደት ድግስ ደግሳ!

አዳሟን አሳየችኝ፤

"የፍቅር መንደሬ ይሄ ነው!" አለችኝ።

አወይ መከራዬ፤ ጨለሙብኝ ቀናት

ሰው ሁሉ ዝም አለኝ፥ ነፍሴ ስትቃትት

ግን....

እስከ ምን ድረስ ነው - ልቤ ያፈቀራት?

እስክትወረውረኝ...

ከዚህ ከንቱ አለም፥ ፍቅር ከሌለበት?

እንደ ምንስ ይሆን - ነገን ያለምኩባት?

እኔማ ባሳቤ...

ይዛኝ ስትሄድ፥ ቦታ መርጣ፥ ቅዝቃዜውን ሳትፈራ፤

በምናብ በሳልኩት የፍቅር ልፊያ፥ "ወዳኛለች!" ብዬ ስቅራራ!

ወይም....

"አብረን ዝም እንበል

ከሰው መንጋ እንከለል



በፍቅር ጥላ ስር እንጠለል” ምትል መስሎኝ

ካንገቴ ስር ተለጥፋ

በሙቅ ትንፋሿ ተንሰፍስፋ

በቅፎቼ፤ ከናፍቆቷ ምትድንብኝ፤

ህይወት እንደዚህ ናት?

ደስታችን ሚቀፋት?

ባልሆን የቃል ሃብታም፥ ስሜቴን ልናገር

ቤት አልባ አርጋኛለች፥

የቤት ልጅ ወቶ አደር፥ ስቃትት እንዳድር

ስሄድ ጥዋት...

እናቴን፤ ደጃፍ ሳያት

አቤት ደስታ፥

አቤት ፌሽታ

እንደ ጥዋት ጸሃይ፥ ፈንጥቃ በርታ

እሷ ግን...

ክፉ ናት!

ሁሉን የተውኩላት

እንዳላደረኳት - የልቤ ላይ ምሳይ

ደፋችብኝ ሰማይ።

በራሴው ፍቃድ፥ ምሉእ ህይወቴን፥ ብቼኝነቴን ስታጎድለው

ባፈቀርኳት ሴት

የፍቅር ሚዛን

‘ዋጋዋ ይሄ ነው!’ ልቤን አስባለው።

ዋጋዋ ስንት ነው?...